ጉራጌን የማዳከም ሚስጥራዊ ፕሮጀክት

(የጉራጌ ወዳጅ ከሆነች እህታችሁ የተላለፈ እጅግ አስቸኳይና አሳሳቢ መልዕክት )

ዘመናትን የፈጀው የጉራጌ ህዝብ የክልልነት ጥያቄን ለመቀልበስና ለማፈን በመንግስት በኩል እንደ አቅጣጫ የተያዘውን የክላስተር አደረጃጀት የጉራጌ ህዝብ ምክር ቤት ነሀሴ 5 2014 ውድቅ ማድረጉን ተከትሎ ጉራጌን የማዳከምና ድምፅ የማሳጣት ስራ ተሰርቷል አሁንም እየተሠራ ነው።

ይህ ጉራጌን የማዳከም ፕሮጀክት ሁለት ምዕራፍ ያለው ሲሆን "ውስጣዊ ና ውጫዊ" ተብሎ የተከፈለም ነው።

ምዕራፍ 1

በጉራጌ መሀል ውስጣዊ መከፋፈል እንዲፈጠር መስራት ሲሆን ይህን ለማሣካትም አራት ዘዴዎች ጥቅም ላይ ውለዋል ። እነዚህም ጎጥ ፣ ገንዘብ ፣ ሀይማኖት ና ሽምግልናን ማፍረስ ናቸው።

ጎጥ

በዚህኛው ዘዴ በመጠቀም በጉራጌው መሀል ያሉ ጥያቄዎችን በማጋጋልና የ "በዳይ ና የተበዳይ" ትርክት በመፍጠር ጉራጌ በጎጥ ተከፋፍሎ እርስ በርሱ በስጋት አንዲተያይ ማድረግ ነው። ይህን ለማሣካትም በጥቅም የተገዙና ስልጣን ቃል የተገባላቸውን ሰዎች በመጠቀም ፣ ብዙ ፌክ አካውንቶችን በማስከፈት ፣ ሌላውን ህዝብ ስሜት ውስጥ የሚከቱ የስድብና ዘመቻዎች በማስደረግ በህዝቡ መሀል መቃቃር ያለ ለማስመሰል ጥረት ተደርጓል። በዚህ ሂደት ውስጥ ነገሩ ገብቷቸው ሊቃወሙ የሚችሉ ሰዎችን በማሰርና ዝም በማለት ለማስፈራራት ተሞክሯል።

ገንዘብ

ከፍተኛ ገንዘብ በማፍሰስ በታጋዮች ፣ በአመራሮች ፣ በዘርማዎች መሀል የተወሰኑትን በመደለል ና የእርስ በርስ ጥርጣሬና መፈራራት እንዲነግስ ለማድረግ ተሞክሯል። በሌላ መልኩ ደግሞ በገንዘብ አልደለል ያሉ አካላትን ደሞዝ በማገድ ፣ ሰው እንዳያግዛቸው የጥላቻ ዘመቻ በመክፈት ፣ ነጋዴ የሆኑትን ግብር በመጨመር ድርጅታቸውን በማሸግ የማዳከም ስራ ተሰርቷል።

ሀይማኖት

ከሌሎቹ በባሰ መልኩ ከባድ ሴራ የተሠራበት ዘዴ ሲሆን በተለይም የሙስሊም ተማሪዎችን ጥያቄ የሚፈታበትን መንገድ በመዝጋት ጉዳዩን በሀይማኖቶች መሀከል መቃቃር በሚፈጥር መልኩ እንዲተገበር መስራት ነው። በዚህም ሂደት የክልሉም የዞኑም አስተዳደሮች እርምጃ እንዳይወስዱ ና ዝም ብለው እንዲመለከቱ ተደርጓል።

ሽምግልናን ማፍረስ

ከላይ የተነሡትን ችግሮችም ሆነ ሌሎች ከዚህ የባሱ ችግሮች በሚከሰቱበት ወቅት የጉራጌ ህዝብ ችግሮቹን በሽምግልና የመፍታት ጠንካራ ባህል እንደ አለው ስለሚታወቅ ያንን የማፍረስ ሂደት ተሞክሯል። ይህህንን ለማሳካት እውነተኛ ሽማግሌዎችን በመግፋት ፣ በጥቅም የተገዙ ሰዎችን በመሰግሰግ ፣ አንዳንዶቹ ሽማግሌዎች ላይ የአሉባልታ ዘመቻ በመክፈት ህዝቡ በሽማግሌዎች ላይ ያለውን አመኔታ እንዲያጣ ጥረት ተደርጓል።

ምዕራፍ 2 - ውጫዊ ክፍፍልን መፍጠር

የመጀመርያው ምዕራፍ ላይ የተኬደባቸው መንገዶች ሳይሳኩ ሲቀሩ ምዕራፍ ሁለት የተጀመረ ሲሆን በዚህም ሂደት ውስጥ ሶስት ዘዴዎች ይተገበራሉ (በመተግበር ላይ ናቸው)

ታጋዮችን ማሠር

በዚህ ዘዴ ለህዝቡ የሚታገሉና ተፅዕኖ መፍጠር ይችላሉ ተብለው የታሠቡ ሰዎችን በማሠር የህዝቡን ድምፅ ማፈን ይሆናል።

ለጉራጌ ጠላት መፍጠር

የጉራጌ የክልልነት ጥያቄ በሌላው የኢትዮጵያ ህዝብ በኩል በስጋትነት ያልተየና ድጋፍ ያገኘ መሆኑ ስለተገመገመ ይሄንን ለመቀልበስ ጉራጌን በዙርያው ካሉ ህዝቦች ጋ የማጣላት ሙከራ በመደረግ ላይ ነው። ይሄንን ለማሣካትም የተለያዩ ተከፋይ አክታቪስቶች እየሠሩ ነው። ይህ ዘዴ መንታ ውጤት ያለው ሲሆን ጉራጌ ክልል ቢሆንም ባይሆንም ከሌሎች ህዝቦች ጋ በሠላም እንዳይኖር፣ ተዘዋውሮ የመስራት ነፃነቱን እንዲነፈግና በህዝብ ለህዝብ ፀብ እንዲወጠር የሚያደርግ ነው።

ጉራጌን ማጥቃት

በተለያዩ የሀገሪቱ ክፍሎች ጉራጌን በመተንኮስ ፣ በማጥቃትና በማፈናቀል ... የህልውና ስጋት ውስጥ እንዲገባ በማድረግ " አቅመ ቢስ" ማድረግ አላማው ነው።

ፕሮጀክቱ በጣም  አደገኛ መሆኑን መላው ጉራጌ ተረድቶ ፣ ከስሜታዊነት በመውጣትና በማስተዋል ፣ የትግሉን ሰላማዊነት በማስጠበቅ ፣ ሀገራዊ የፖለቲካ ጉዞዎችን በመረዳት ወደፊት መቀጠል ይኖርበታል።

ይኽንን ማድረግ ካልቻለ በቀጣይ አመታት የጉራጌ ህልውና አደገኛ ቅርቃር ውስጥ ሊገባ ይችላል።

ሠላም ለጉራጌ - ሠላም ለኢትዮጵያ